# ለ 2013ዓም. ቀውሱ "ህልውና ዘማች"ዎች የመብትዎች መከበር ከአሁኑ መታሰብ አለበት

------ይሕ ጽሑፍን የአገኙት ከ www.binyamhk.wordpres.com ነው።

*ᏏY* binyam HAILEMESKEL Kidane, August 24th 2021, Welkite Town.

በአፍሪቃ ውስጥ ኮሎኔልዎች ስልጣን ገልብጠው የመያዝ እድሉ ከማንም የበለጠ አለአቸው፣ እንደ በላይዎችአቸው ጀኔራሎች በቅንጦት አይንቀራፈፉም ብሎ፣ ኢትዮ-ሜሪካአዊው (The EthioMerican) ዲናው መንግስቱ በአፍሪቃ መሪዎች እጅግ አለቅጥ ከተሳለቀበት ልብወለዱ ተጽፎ መወደድ በአጭርጊዜ፣ የማሊው 37ዓ. ኮሎኔል አሲሚ ጎይቶ በ2013ዓም. የሀገሩ የበትረ መንግስት ስልጣንን ፈንግሎ አስተዳደሩን ከጊዜአዊነት አመራር ቀስበቀስ ከጠቀለለ ሁለት አመትዎች ገደማ ቀድሞ፤ በኢትዮጵያም ከአራት የንግስና-ውጭ መንግስት አስተዳደር መሪዎች፣ ለኢትዮጵያ ሁለተኛዋ የሆናት ኮሎኔል መሪ-ሚና ተከስቶ አለ። "ወያኔን ከውስጡ ፈንቅሎ የወጣው አብይ አህመድ (ኮ/ዶር.)" (መስፍን ወልደማሪያም፤ *ዛሬም እንደ ትላንት?* ገ24፣ ገ55)፤ እስከ ዛሬ ከገለበጠ የተባለው ወያኔ የስልጣኑ(ቂም) ነገር አልለየለትም።

ወያኔ፣ ከ2012ዓም. ጀምሮ፣ ቀስበቀስ በሰላም እና ፍቅር እንዲሁም "መደመር"፣ ጥቂት ቆይቶ፣ እየተገፋ፣ በቀስታ ወደ ዳግ-ትግል ተመልሶ አለ። ቢሊየንዎች ወጪ ተደርገው፣ ብዙዎች ዜጋዎች እና ወታደርዎች መስዋእት ተደርገው፣ አጭር "ህግ-አክብር" ዘመቻ የተባለው፣ በፌዴራል መንግስት ሽንፈት ተጠናቅቆ፤ ሁለተኛው ዙር የወያኔ ዳግ-ትግል፤ እየተከወነ ይገኝ አለ።

በእዚህ ሂደት ከዝርክርክ የስልጣን ሽሚያ እና አስተዳደሩ ውጭ፤ የህዝቡ "ክተት! መክት! ተዋጋ!" ይፋ ጥሪ አንዱ ሆኖ አለ። በይፋ፣ ዜጋዎች ታጥቀው፣ ተመልምለው እነወዲዋጉ ጥሪ እና ድጋፍ ተደርጎ አለ። በዋናነት በአማራ ክልል የእሚታይ ግርግር ቢሆንም፤ ህግ በእማይቀበለው መንገድ የክልል ጸጥታ አቅምዎች፣ እና መደበኛዜጋዎች በመዘመት እና በመመልመል እንዲያግዙ እየተደረገ ነው።

"ወራሪ ጠላት ሲመጣ ሕይወቱን ሰውቶ እንዲከላከል የሚገደድ ሰው እንዴት አልጋ የሚዘረጋበት...መሬት ያጣል?" (ገ142)፣ ..."...ቤት ለሀብታሞች ብቻ የእሚሆንበት ጊዜ እየመጣ ነው፤ ታዲያ በክፉ ቀን ከ(ውጭ ሀገራት) የድረሱልን ጥሪ ልናስተላልፍ ነው ወይስ መሬት - አልባ፣ ቤት - አልባ የሆነውን ደሀ ተሰለፍ ሊባል ነው?" (ገ151)።

የመሬት እና መኖሪያ ቤት ችግር በኢትዮጵያ ከወያኔ ጊዜ ጀምሮ፣ እጅግ የተበላሸ እና ለድሃዎች የእማይሆን እንደሆነ፣ የሚሊየኖች ጨዋታ እንደ ተደረገ፣ ለደላላዎች ብቻ እንደሆነ፣ ከደርግ የቤት አያያዝ የዘቀጠ እንደሆነ፣ ድሃ ተፈናቅሎ እንደ እሚባረር፣ በቀኑ መጨረሻ ለሀገር መከታነት የእሚነሳው ግን ድሀ እንደሆነ የታወቁት የኢትዮጵያ ፖለቲካ አባት በእዚህ መጽሐፍ ገሥጸው አሉ። ዛሬም፤ ስለ ስልጣን ፍላጎት፣ በትረመንግስቱ ይገባኝ አለ በእሚል ህዋሃት. ወደ ጥቃት ሲመለስ፣ ማእከልአዊ መንግስት አስተዳደር በተለይ ከተሸነፈ በኋላ ለሁለተኛው ዙር መከላከል/ማጥቃት፣ ዘማቹን እጅግ መደበኛ ዜጋ (ሴት፣ ወንድ፣ ገበሬ፣ ከተሜ...) አድርጎት አለ። ሙሉጉዳዩ ተትቶ፣ ስለተጠቀመው አሳሳቢ ጉዳይ በአጭሩ ስንደመድም፣ ከእየክልለጀ የእሚዘምቱት ከመሬት ተነስተው የተሰበሰቡት ዜጋዎች፣ ከወዲሁ፣ ለሰጡት ኢላማው ስልጣን-አስተዳደር ለሆነ (ዞሮዞሮ) ውጊያ፣ ይህ የፕሮፌሰሩ ግሣፄን መሰረት የአደረገ የአገልግሎትአቸው ተጠባቂ ምላሽ ይገባቸው አለ። ለሁሉም ዜጋ የመሬትባለቤትነት እና መኖሪያቤት ህገመንግስትአዊ እና ሰብእአዊ መብትዎች ውስጥ ዐይነተኛ ከእሚባሉት እሚደረደሩ ናቸው። እነእዚህ መብትዎች፣ አስቸጋሪሆነው ለልእለብዙሃኑ ቢርቁም፣ እጅግ ወሳኝ ትትረትዎችን እና ስርነቀል የስነስርአት፣ ትልምአግጣጫዎች (policies)፣ እንዲሁም ትኩረትአዊ ማዝመምዎች ቢፈልግም - የአለው እንደ አለ - ለእነእዚህ በብዛት ከድህነት የተነሳ "ለክተት መክት ጥሪ" የተነሱት ቢያንስ በነብስ ለእሚመለሱት እነእዚህ መብትዎች እንዲከበሩ የአስፈልጉአቸው አሉ። በመሞ ለእሚለዩት ለቤተሰብእዎችአቸው (ካሉ)፣ ለእሚጎዱት ገቢምንጭዎች ጭምር፣ በደህና በድል/ሽንፈት ዳግ-ለእሚቀላቀሉን፣ የቤትዎቹ (እና መሬቱ) መብት ሊሰጡአቸው ይቻል አለ። ታላቁ ተቆርቋሪ እንደ አሉት፤ ቤቱ ከተገኘ፣ መናጢ ድህነቱ እንደአለ፣ በባዶቤት ስለቤቱ እንደ ንጉስ መንገስ አለ እና ትልቅ እና አንድ ድል ነው። (ገ.142)።

ከመዝጋቱ ቀድሞ አንድ ሃሳብ ይታከል። መኖሪያቤት መብትዎቹ እና የከበደ አገልግሎት እውቅናው፣ ድህነትን በሰበብ ለመቀነስ የግዝ አለ። ከተዋግቶ፣ ለሞት ፈቅዶ ተጉዞ፣ ተጎድቶ፣ በብዛት እንደ እማይቀረው በ ድኅረ-ስቃቂአዊ-ህመም (PTD) መጠቃቱ የእሚኖር በመሆኑ፣ የስራዕድልዎችን በመተዉ ሲመለሱ ከሌላው ዜጋ እኩል ለመሆን ዜጋው በስራ/ትምህርቱ ጥሎ በመሄዱ ለማካካስ፣ ወዘተ. ተመልሰው የእሚገቡትን የግድ በእዚህ ማገዝ ይገባ አለ። መረሳት የሌለበት፣ አብዛኛዎቹ፣ ዘማችዎች፣ ገና በቂ ስልጠናዎች እና ልምምድዎች የአላገኑ

ድንገት ዘማችዎች መሆንአቸው፣ ቢበዛ ለወር እስከ ቀንዎች ብቻ ወይም ሶስት ወርዎች ብቻ የሰለጡኑ ወይም ደግሞ ከእየተያያዥ የጸጥታ ስራ ድንገት የተጠሩ፣ ወይም መደበኛ ሰራዊትዎች መሆንአቸው ታውቆ በተለይ ለዜጋዎቹ እና መደበኛ እና የእሚጠብቁት ስራአቸው ለአልሆነው ለሚሊሺያ ወይም ህግዘብዎች፣ የተለየ አስተያየት በእዚህ ዙሪያ መደረግ አለበት።

አብሮ፤ ይህ በሰበቡ ድህነትን ለመቀነስ እና ሀገርአዊ ስሜትን/አገልግሎትን ለጠቢው ተንቆ እንደማይቀር ምልክት መፈረሚያ እሚሆነውን እውቅና፣ በተለየ መንገድ ማቅረብ ቢቻል ከፍተኛ ጥቅምዎች አሉት። አንደኛ፣ መንግስት አቅም የአለው ዘማችን ለይቶ በተለየ (የአነሰ) እውቅና መጠን መቀበል ሲችል፤ መኖሪያቤት ለእሚያዘጋጅለት ድሀ ዘማች ግን በተሰበሰበ መንደር፣ የጋራ መኖሪያቤትዎች ወይም የጋራ መኖሪያቤትዎች መንደር መመስረት የእሚሻል ነው። (ቀኃሥ. እያንዳንዱ 25ሺህ ብርዎች እሚያወጡ ቤትዎችን ሰርተው ለሌለአቸው ሲሠጡ፣ በቁልምጫ "የድሀ መንደር" እንደተባለ (ገ.143)፣ ይህም "የዘማቾች መንደር" ቢሰኝ ከደረሰው አገልግሎት ጥቂት የተስተካከለ የረዥም-ጊዜ እውቅና ይሆን አለ)። መኖሪያ መንደር/ቤትዎች እንደ አንድ ስራ ገጠቅልሎ ሲገነባ፤ በተጠያቂነት፣ በቀልጣፋ መንገድ፣ በቀነሰ ሀገርአዊ ኪሳራ/ወጪ፣ በፍጥነት፣ (ከደካማው ሀገርአዊ ልምድዎች በመነሳት) የተግባሬት (project) መዘናጋት ቢኖር በተገቢ ጫና የመፍጠር አቅም ለጠቢ-ባለመብትዎቹ ለመፍቀድ፣ ሙስና ለመቀነስ፣ ወዘተ. ይህ ጠቃሚ ነው። ሁለተኛ፤ የዘማችዎቹ በአንድነት ተጉዞ በአንድነት ዘምቶ፣ በአንድነት የመመለስ እውነት በአንድ የመኖር እድልም ቢቸር፣ በእዛው ተዛምደው፣ ተጋምደው፣ ስለእሚመጡ እጅግ ሸቃሚ እና በቅድመንቃት በሳል መንገድ ይሆን አለ። የስነልቦና የአውድማ ትስስርአቸውን በእዛው ለማስቀጠል እና ለህይወት ጓደኛሞች ለማድረግ መልካም ነው። ሶስተኛ፣ ጥለት-ኢትዮጵያአዊነት የኢትዮጵያ መንግስት እና ህዝብ መርህ መሆን አለበት። ይህም፣ በታሪክ ህዝቡ የተሳሠረ ነው በእሚል ሰበበሃሳብ (premisses)፣ ወደፊቱም በጎሣ ወይም እምነት የመከፋፈል እምቅአደጋው (its risk)፣ እንዲቀንስ በማለም እንዲሁም በመጨረሻ እንደሆነው በገሃድ በይፋ አሰራር እና ትልምአግጣጫዎች (policies) ለማንጸባረቅ እና እነእዚህን ልዩነትዎች እና አዲስ የተሰባጠረ ሃገርነትን በመንግስትአዊ ስራ እና ትልምአግጣጫዎች ለመተግበር፣ ከደቡብ ክልል፣ አፋር፣ ከተማ አስተዳደርዎች፣ አማራ፣ ኦሮሚያ፣ ወዘተ. የተሰባጠሩት እና የተጋመዱት ዘማችዎች በእየመጡበት ከመመለስ ወደ ተመፈጡ አንድ፣ ሁለት ወይም ጥቂት ስፍራዎች በተባለው መልክ፣ በጋራ እንዲኖሩ እና ተሰባጥረው እንደዘመቱ ተሰባጥረው እንዲኖሩ ለማመቻቸት ቢታሰብ ስነአመክንዮአዊ ነው። ሀገርን ከመፈራረስ ለማብረስ፣ ከመለያየት ቅዠት ለመፍለጥ፣ ይህን መሰል አካሄድ ሁሌ ቢበረታታ እና አሁንም ቢተገበር፣ የወደፊት ኢትዮጵያ ለጠቢ ትውልድ ስትደርስ የእኔ የአንተ መባባሉ ቀርቶ የእኛ ተብሎ ለማሰብ አሁኑኑ መንገዱን በእዚህ ትውልድ መስዋእትነትዎች መጥረግ ቢጀመር መልካሙ አካሄድ ነው።

በመጨረሻ፤ አንደኛ የገንዘብ፣ መሬት፣ አፈፃጸም ጉዳይዎችን በተመለከተ፤ ህዝብ ግፊት ማድረግ አለበት። ሁለተኛ በቀረ፣ የከበደ ወቅት የአሳለፉ ደሃ ዘማችዎች ተመልሰው ወደማህበረሰቡ በቀላል ስለእማይቀላቀሉ አደጋው መልሶ ለህዝቡ ነው። ስራአጥነት እና ባይተዋርነት ከስነልቦና በሽታው ጋር ዘማቹ ሲመለስ አምራች ላያደርገው ይችል አለ። ሶስተኛ፣ መንግስት ደግሞ መሬትን ባለሃብት ነኝ ብሎ ከህዝብ እኩል ሆኖ ሀገሩን እንደ "ሸወደው" (ገ.149)፤ ከመሬቱ በቀላል ማዘጋጀት አለበት። ገንዘቡን በተመለከተ፣ ግንባታውን አይጎዱ እንጂ እንደ ንቁ ዘማችነትአቸው፣ ተመላሽዎቹ በጉልበት በመሳተፍ፣ በቀነሰ ዋጋ መገንባት የእሚቻል ነው። አራተኛ፣ በውትድርና፣ በ ህግዘብነት (being police)፣ ወይም ተመሳሳይ ስራ በመቀጠል በግዳጅ ለመኖር የእሚፈልጉትን በእዛው አግጣጫ ማገዝ እንዲቻል ማድረግ። አምስተኛ፣ የክልል መንግስትዎችም፣ ይህ ጠቅላላ ጽሑፍ የአነሳው ወሬን ለእየግልዎችአቸው መመልከት እና ማስተናገድ አሉብአቸው። ስድስተኛ፣ ክልልዎችም ማእከልአዊ መንግስት አስተዳደርዎችም አብረው በእዚሁ ጉዳይ መስራት እንዲችሉ መበረታታት አለበት።

ለመጨረስ የአክል፣ እጅግ ቁንጽል የሆኑ ከብዙ ለወርዎች ከተላለፉ የወጣት፣ ሴት፣ አዋቂ፣ ወንዱ...ዘማችነት ዜና የተቀነጨቡ ምስልዎችን ይመልከቱ።፡



ፋኖዎች በጎንደር ነሃሴ 2013ዓም







የተለያዩ ወጣትዎች ዘማች ሆነው ሲቀላቀሉ ስንመለከት፣ ይህ ግን ከእየክልሉ ለማለት በእሚያስደፍር እንጂ ከአማራ ክልል ብቻ የተከወነ አይደለም።